## አንደኛዉ ትምህርት

ፋቲሐ (የመክፈቻይቱ) ምዕራፍ ጨምሮ ከአል ዙልዚላህ (የእንቅጥቃጤዉ) ምዕራፍ ከሚባለዉ ጀምሮ እስከ አልናስ (የሰዎች ምዕራፍ) ድረስ ካሉት አጫጭር ምዕራፎች የተቻለዉን ያህል ንባባቸዉን በማስተካከልና በቃል በማስጠናት እንዲሁም ትርጉሙን ማወቅ ግዴታ የሆነዉን አብራርቶ ማስረዳት ::

## ሁለተኛዉ ትምህርት

ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ አለመኖሩን እና ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸዉን መመስከር ይኸዉም ከአንድ አላህ በስተቀር ሊያመልኩት የሚገባ ጌታ አለመኖሩንና ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የአላህ መልዕክተኛ መሆናቸዉን ከነትርጉሙ እንዲሁም የላኢላህ ኢላሏህን ቅድመ ሁኔታዎችን (ሹሩጦችን) ከማብራራት ጋር ማስተማር ነዉ ::

**ትርጉሙ** << **ላ ኢላህ** >> የሚለዉ ከአሏህ ሌላ አምላክ እንደሌለ የሚያሳይ አሉታዊ ቃል ሲሆን << **ኢለላህ** >> የሚለዉ ደግሞ አምልኮን ለአንድ አላህ ብቻ የሚያረጋግጥ አወንታዊ ቃል ነዉ ::

የላኢላህ ኢልለሏህ ቅድመ ሁኔታዎች (ሹሩጦች) የሚከተሉት ናቸዉ

1. ለአለማወቅ ተጻራሪ የሆነ ማወቅ

2. ምንም ጥርጣሬ የሌለበት እርግጠኝነት

3. ማጋራት ያልተጨመረበት ፍጹምነት

4. ዉሸት የሌለበት እዉነተኝነት

5 .ላቻ የሌለበት ዉዴታ

6 .ቸልታ የሌለበት መታዘዝ

7 .ተቃዉሞ የሌለበት መቀበል

8 .ከአላህ ሌላ ባለ አማልክት በሙሉ መካድ ናቸዉ::

እነዚህም ቅድመ ሁኔታዎች በዚህ መንገድ መግለፅ ይቻላል ::

እዉቀት ፣ እርግጠኝነት ፣ ፍፁምት ፣ እዉነተኛነት ፣ ከዉዴታና ከመቀበል ታዛዥነት

ስምተኛዉ ደግሞ ከአላህ ሌላ የተመለኩትን ነገሮች መካድ ነዉ::

## ሦስተኛዉ ትምህርት

የእምነት መሰረቶች ስድስት ናቸዉ:: እነሱም በአላህ ማመን ፣ በመላዕክቶች ፣ በመጽሐፍቶች ፣ በመልክተኞች ፣ በመጨረሻዉ ቀንና በቀድር (ደግም ሆነ መጥፎ) በአላህ (ጥራትና ልዕልና ለሱ ይሁንና) ዉሳኔና እዉቀትን ነዉ ብሎ ማመን ናቸዉ ::

## አራተኛዉ ትምህርት

የተዉሂድ (አላህን አንድ የማድረግ) ክፍሎች ሦስት ናቸዉ እነሱም

የጌትነት አንድንት የአምላክነት አንድነት የስሞችና የባህሪያት አንድነት ናቸዉ

የሽርክ (የማጋራት) ክፍሎች ሦስት ናቸዉ :: ትልቁ ማጋራት ፣ ትንሹ ማጋራትና ድብቁ ማጋራት ናቸዉ

ትልቁ ማጋራት የተግባርን ከስረትና በጋሀነም እሳት ዉስጥ መዘዉተርን ያስከትላ

አላህ እዲህ አለ << **ባያጋሩም ኖሮ ይሰሩት የነበሩት ከነሱ በታበሰ ነበር** >> አል አንአም :88

በሌላ አንቀጽ :-

<< ***ለከሃዲዎች በነፍሶቻቸዉ ላይ በክህደት የሚመሰክሩ ሆነዉ የአላህን መስጊዶች ሊሰሩ አይገባቸዉም እነዚያ ስራዎቻቸዉ ተበላሹ እነሱም በእሣት ዉስጥ ዘዉታሪዎች ናቸዉ*** >>አል ተዉባ : 17

በዚህም ላይ የሞተ ሰዉ በምንም አይነት አይማርም ገነትም ለሱ እርም ናት አላህ ሱወ እንዲህ አለ

<< ***አላህ በእርሱ ማጋራትን በፍፁም አይምርም ከዚህም ሌላ ያለዉን ለሚሻዉ ይምራል*** >>አል ኒሳዕ : 48

አላህ እንዲህ ይላል :-

<< ***እነሆ በአላህ የሚያጋራ ሰዉ አላህ በእርሱ ገነትን በእርግጥ እርም አደረገ መኖሪያቸዉም እሳት ናት በዳዮች ምንም ረዳት የላቸዉም*** >>አል ማኢዳ :72

በዚህ ክፍል ከሚጠቃለሉ መካከል ሙታንን እና ጣኦታትን በነሱ መመጀን መሳል ለነሱ ማረድና ሌሎችም ይገኙበታል::

ትንሹ ማጋራት ማለት ደግሞ በቁርአን ወይም በሐዲስ ማጋራት (ሽርክ) ተብሎ ተነግሮ ግን ከትልቁ የማጋርት ዓይነት ያልሆነ ነዉ:: ለምሳሌ አንድ ነገር ሲፈፀም ለይዩልኝ መፈፀም ከአላህ ሌላ ባለ ነገር መማል  አላህና እገሌ ካሉ ማለትና የመሳሰሉት ናቸዉ ::

ነብዩ ሙሐመድ  (ሰ.ዐ.ወ)  እንዲህ አሉ፡-

*<<  ከእናንተ ከምፈራላችሁ ሁሉ የምፈራዉ ትንሹን ማጋራት ነዉ :: ብለዉ ሲናገሩ እሱ ምንድን ነዉ በማለት ተጠይቀዉ ሲመልሱ ለይዩልኝ መስራት ነዉ ብለዋል  >> ይህን ሀዲስ በጥሩ የዘገባ ሰንሰለት ኢማሙ አህመድ ጦበራኒና በይሐቂ መሐመድ ብኑ ለቢድ የተባሉትን ሰሃባ ጠቅሰዉ ዘግበዉታል ጠበራኒ በሌላ የዘገባ ሰንሰለት እኚህ ሰሃባ ከራ ዕ ብን ከዲጅ የሰሙትን ብለዉ እደሚከተለዉ አቅርበዉታል ::*

*<<ከአላህ በስተቀር ባለ ነገር የማለ ሰዉ በእርግጥ አጋራ>>*
*አቡዳዉድና ቲርሚዚ ደግሞ ከዑመር ኢብነል አልኸጣብ በትክክለኛ የዘገባ ሰንሰለት የሚከተለዉን ሐዲስ ዘግበዋል ::*

*<<ከአላህ ሌላ ባለ ነገር የማለ በእርግጥ አላህን ካደ ወይም በአላህ አጋራ>>*

*ከሁዘይፍህ አልየማኒ አቡዳዉድ በትክክለኛ የሐዲስ ሰንሰለት የዘገቡት ደግሞ*

*<<አላህና እገሌ ካሹ አትበሉ እንግዲያዉስ አላህ ካሻ ከዚያም እገሌ ከሻህ በሉ የሚል ነዉ>>*

*ይህ ክፍል ሽርክ ከእምነት መዉጣትንም  ሆነ በእሣት ዉስጥ መዘዉተርን አያስከትልም ግን ግዴታ የሆነዉን የተዉሂድ ሙሉዕነት ይቃረናል (ይጻረራል)::*

*ሶስተኛዉ ክፍል የድብቁ ማጋራት ነዉ፥ ማስረጃዉ ተከታዩ የነቢያችን (ሰ.ዐ.ወ) ቃል ነዉ*

*አዎጅ ከደጃል ይበልጥ የምፈራላችሁ ምን እንደሆነ ልገራችሁን ሲሏቸዉ እሺ የአላህ መልዕክተኛ ሆይ ይንገሩን አሉቸዉ <<ድብቁ ማጋራት ነዉ አሉ:: እሱም ሰዉየዉ ይቆምና ይሰግዳል፥ ሰላቱን ያሳምራል፥ ሰዉየዉ ወደሱ መመልከቱን ስለአየ >> (ኢማሙ አህመድ የዘገቡት ሐዲስ ነዉ) ::*

*ማጋራትን (ሽርክን) ለሁለት ብቻ መክፈልም ይቻላል ይኸዉም በትልቅ በትንሽና ድብቅ በሚለዉ ግን ሁለቱንም የሚያጠቃልል ይሆናል በትልቁም ዉስጥ እንደ መናፍቃን ማጋራት አይነት ይገኝበታል ::*

*እነሱ መጥፎ እምነታቸዉን ደብቀዉ እስልምናዉን ለይዩልንና ለህይወታቸዉ በመፍራት ከአንገት በላይ ያስመስላሉ እንደዚሁም  ድብቅ ማጋራትን በትንሹ ማጋራት ዉስጥ ይገኝበታል እሱም ባሳለፍዉ ሐዲስ ዉስጥ እደተጠቀሰዉ ለመታየት የተፈጸመን የሚመስል ነዉ ::*

## አምስተኛ ትምህርት

የእስልምና ማዕዘን አምስት ናቸዉ። እነሱም፥

1 አላህ ሌላ አምላክ አለመኖሩንና ነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) የአላህ ሱ.ወ መልዕክተኛ ናቸዉ ብሎ በአንደበቱ መመስከር

2 ሰላት መስገድ

3 ዘካትን መስጠት

4 የረመዳንን ወር መጾም

5 መስፈሪቱን ያሞላ ሰዉ የተከበረዉን የአላህን (ሱወ) ቤት ሄዶ መጎንኘት (የሐጅን ፀሎት ማድረስ) ናቸዉ።

## ስድስተኛ ትምህርት

ስለ ሰላት ቅድመ ዝግጅቶች (ሸርጦች) እነሱም ዘጠኝ ናቸዉ ። እነሱም ፦

1. ሙስሊም መሆን

2. የአዕምሮ ጤናማነት

3. ጠቃሚንና ጎጂን ጥሩና መጥፎዉን ለይቶ የማወቅ እድሜ መድረስ (አልተሞይዝ)

4. ትልቁና ትንሹ ሀደስ ማስወገድ

5. ነጃሳን ነገር ማስወገድ

6. ሀፍረተ ገላን መሸፈን

7. የሚሰገደዉ ሰላት ግዜ መግባት

8. ፊትን ወደ ካእባ (ቂብላ) መዞረና

9. ኒያ (ማሰብ) ናቸዉ

ትልቁ ሐደስ ማለት ሙሉ ሰዉነት መታጠብ የሚያስፈልገዉ ትንሽ ሐደስ ማለት ዉዱእ የሚያስፈልግ ማለት ነዉ።

## ሰባተኛ ትምህርት

የሰላት ማዕዘናት አሥራ አራት ናቸዉ ። እነሱም፦

1. ችሎታ ያለዉ ሰዉ መቆም

2. የመግቢያ ተክቢራ (አላሁ አክበር) ማለት

3. ፋቲሐን ማንበብ

4. ማጎንበስ(ሩኩዕ)

5. ከአጎነበሱበት ቀና ብሎ መቀመጥ

6. በሰባት የሰዉነት አካላት ሱጁድ ማድረግ (ከመሬት ላይ ግንባርን ማሳረፍ)

7. ከእሱም መነሳት

8. በሁለት ሱጁዶች መካከል ለተወሰነ ግዜ መቀመጥ

9. በማንኛዉም የሰላት ተግባራትና እንቅስቃሴ ወስጥ መረጋጋት

10. በየማዕዘናቱ መካከል ያሉትን ቅድመ ተከየል መጠበቅ

11. የመጨረሻዉን አተሀየቱ (ተሸሁድ) ማንበብ

12. ለእሱም መቀመጥ

13. በነብዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ላይ ሰለዎት ማዉረድ

14. በሁለቱም ጎን ሰላምታ (አሰላም አለይኩም ወራህመቱላህ) ማለት ናቸዉ ፡፡

## ስምንተኛ ትምህርት

የሰላት ዋጂቦች (ግዴታወች) ስምንት ናቸዉ፡፡ እነሱም ፡- ከመጀመሪያዉ ተክቢራ በስተቀር በሰላት ዉስጥ ያሉት ተክቢራዎች በሙሉ የሚያሰግድ ሰዉ (ኢማም) ወይም ብቻዉን ሰጋጅ ሰሚ አላሁ ሊመን ሀሚዳህ (**አላህ አመስጋኙን ሰሚ ነዉ**) ማለት የሚሰግዱት ሁሉ ረብበና ወለከሀምድ (ጌታችን ሆይ ምስጋና ለአንተ ይሁን) ማለት ፣ ሲያጎነብስ (ሩኩዕ ሲያደርግ) ሱብሀነረቢያል አዚም (**ታላቁ ጌታ ጥራትና ልዕልና ያገባዉ**) ማለት ፣ መሬት ላይ ሲደፋ (ሱጁድ ሲያደርጉ) ሱብሀን ረቢያል አዕላ (**የበላዩ ሀያሉ ጌታ ጥራትና ልዕልና ይገባዉ**) በማለት በሁለቱ ሱጁዶች መካከል ረቢግፊርሊብሎ (**ጌታረ ማረኝ**) የሚጀምረዉን ፀሎት ማድረግ የመጀመሪያዉን ተሸሁድና (አተሀያቱ) ለሱም መቀመጥ ናቸዉ ፡፡

## ዘጠነኛ ትምህርት

የተሸሁድ (አተሂያቱ) ዝርዝር እሱም ፡-

<<አታሂያቱ ሊላሂ ወሰለዎቱ ወጠይባቱ አሰላሙ አለይካ አዩሀን ነብዩ ወራህመቱላሂ ወበረካትሁ አሰላሙ አለይና ወአላ ኢባዲላሂ አሶሊሂን አሽሐዱ አንላ ኢላህ ኢለላህ ወአሽሐዱ አነ ሙሐመደን አብዱሁ ወረሱሉሁ አላሁመ ሰሊ አላ ሙሐመዲን ወአላ አሊ ሙሐመዲን ከማሰለይተ አላ ኢብራሂመ ወአላ አሊ ኢብራሂመ እነከ ሐሚዱን መጂድ ወባሪክ አላ ሙሐመዲን ወአላ አሊ ሙሐመዲን ከማ ባረከተ ዓላ ኢብራሂመ ወዓላ አሊ ኢብራሂም ኢነከ ሐሚዱን መጂድ>>

ክብሮች ለአንድ አላህ ብቻ ናቸዉ ፀሎቶችና መልካም ነገሮችም አንተ ነብይ ሆይ የአላህ ሰላምና እዝነት እንደዚሁም በረከቶች በአንተ ላይ ይሁን የአላህ ሰላም ለእኛና ለደጋጎች የአላህ አገልጋዮች ይሁን ከአላህ በስተቀር ሌላ አምላክ እንዴሌለ እመሰክራለሁ ሙሐመድ የአላህ መልዕክተኛና አገልጋይ እንደሆኑ እመሰክራለሁ ፡፡

አላህ ጌታዬ ሆይ በነብያችን ሙሀመድና ቤተሰቦቻቸዉ ላይ የአክብሮት ሰላት (ራህመት) አዉርድ በነብዩ ኢብራሂምና በቤተሰቦቹ ላይ እዳወረድከዉ ሁሉ አንተ በጣም ምስጉንና በጣም ቅዱስ ነህና በነብያችን ሙሀመድና በቤተሰቦቹ ላይ በረከት አዉርድ በነብዩ ኢብራሁምና በቤተሰቦቹ ላይ እዳወረድከዉ ሁሉ አንተ በጣም ምስጉንና በጣም ቅዱስስ ነህና

ከዚያም በመጨረሻ ቁጭታ **ከገሐነምና ከቀብር ቅጣት በሕይወትም ሳለ ሆነ ከሕይወት ሕልፈት በኋላ ከመቸገርና ከደጃል ችግር (ፈተና) በአላህ ይጠበቅ** ከዚያም ከጸሎት (ዱዓእ) አይነቶች የመረጠዉን ያድርግ በተለይ ከነብዩ (ሰዐወ) የተሰማዉን ፡፡ እነሱም፡-

አልላሁመ አኢነ ዐላ ዚክርከ ወሹክርከ ወሁስኒ ኢባዳቲከ አልላሁመ ኢኒ ዘለምቱ ነፍሲ ዙልመን ከሲታን ወላያግፍሩ አልዙኑብ ኢሏ አንተ ፈግፊርሊ መግፊረተን ሚን ዒንዲከ ወራሐምኒ ኢነከ አንተልገፍሩ ረሂም

ትርጉሙም<< **አላህ ሆይ በዉዳሴህ በምስጋናህ በመልካም ሁኔታ እዳመልከህ አግዘኝ አላህ ሆይ ራሴን በብዙ በድያለሁና ካንተ በስተቀር ኃጢያትን የሚምር ስለሌለ ካንተ ዘንድ የሆነ ምህረት አድርግልኝ እዘንልኝ አንተ በጣም መሃሪና አዛኝ ነህና ፡፡**>>

## አስረኛ ትምህርት

ስለ ሰላት ሱናዎች ከእነሱም ፡-

1. የመከፈቻ ፀሎት ማንበብ

2. ሲቆም የቀኝ እጁን መዳፍ በግራ እጁ ላይ በማድረግ ከደረቱ ላይ ማስቀመጥ

3. የእጆቹ ጣት የተጠጋጉ ሲሆን ሁለቱንም እጆች እትከሻ ወይም እጆሮ ድረስ

1ኛ. በመጀመሪያ ተክቢራ

2ኛ. ሲያጎነብስ (ሩኩዕ ሲያደርግ)

3ኛ. ተመልሰዉ ቀጥ ሲሉና

4ኛ. ከመጀመሪያዉ ተሸሁድ ለሶስተኛዉ ረከዓ ሲነሱ ማንሳት

4. በማጎንበስ ጊዜም ሆነ በመሬት ላይ በመደፋት ጊዜ ከአንድ ጊዜ በላይ በመጨመር ተስቢህ (አላህን ማጥራት)

5. በሁለቱ ሱጁዶች መካከል ከአንድ ግዜ በላይ ምህረትን መለመን

6. ሲያጎነብሱ እራስን በጀርባ ትክክል ማድረግ

7. በመሬት ላይ ሲደፍ (በሱጁድ) ጡንቻዎችን ከጎኖቹ ሆድን ከጭናቹ ማራቅ

8. ሱጁድ ሲደረግ ክንዶችን ከመሬት ማንሳት (ማራቅ)

9. በመጀመሪያዉ ቁጭታና (ተሸሁድ) በሁለቱ ሱጁዶች መካከል ባለዉ ጊዜ የቀኝ እግሩን ጣት ተክሎ በግራ እግሩ ላይ መቀመጥ

10. በመጨረሻ ቁጭታ (ተሸሁድ) ጊዜ የቀኝ እግሩን ጣት በመትከል መቀመጫን መሬት ማስነካት

11. በመጀመሪያዉ ቁጭታ (ተሸሁድ) ሰላትንና ረድኤትን ለነብዩ ሙሐመድና ለቤተሰቦቻቸዉ ፣ ለነብዩ ኢብራሂምና ለቤተሰቦቻቸዉ መለመን

12. በመጨረሻዉ ቁጭታ (ተሸሁድ) ፀሎት ማድረግ

13. በሱብሂ ሰላት በሁለቱም ረከዓዎች በመግሪብና በኢሻ በሁለቶች የመጀመሪያ ረካአዎች ድምጽን ከፍ አድርጎ ማንበብ

14. በዙሁርና በዐስር በሁለቱም ረከዓዎች ድምጽን ዝቅ አድርጎ ሳያሰሙ ማንበብና

15. ከፋቲሐ ሌላ በተጨማሪ የቁርዓን ምዕራፍ (አንቀፅ) ማንበብ ነዉ ይህም ሌሎቹንም በዚህ መጽሐፍ ያልጠቀስናቸዉን የሰላት ሱናዎች ከመጨመር ጋር ነዉ::

## አስራ አንደኛ ትምህርት

ሰላትን የሚያበላሹ ነገሮች ስምንት ናቸዉ:: እነሱም:-

1. ከማወቅና ከማስታወስ ጋር መናገር ፤ የረሳ ወይም ያላወቀ ግን በመናገር ሰላቱ አይበላሸበትም::

2. ሳቅ 3. ሙብላት 4. መጠጣት 5. ሐፍረተ ገላ መገለጥ 6. ከካዕባ (ቂብላ) አቅጣጫ በብዙ መዞር
7. በሰላት ዉስጥ በተከታታይ ብዙ እንቅስቃሴ ማድረግ 8. የዉዱእ መበላሸት (መፍረስ)

## አስራ ሁለተኛ ትምህርት

የዉዱእ ቅድመ ሁኔታዎች (ሸርጦች) አስር ናቸዉ:: እነሱም:-

ሙስሊም መሆን ፣ የአዕምሮ ጤናማነት ጠቃሚንና ጎጂን ጥሩና መጥፎን ለይቶ የማወቅ ፣ ዕድሜ መድረስ ፣መነየት፣ ዉድእ እስከሚያበቃ ላለማቆረጥ መወሰን ፣ ዉዱእን የሚያስገድዱ ነገሮች መቆረጥ ፣ አስቀድሞ በዉሃ ወይም በድንጋይ (በመሳሰሉት) የሽንትንና የሰገራን መዉጫዉን ማጠብ (ማበስ)፣ ዉሃዉ ንፁህ መሆንና ሊጠቀምበት የተፈቀደ መሆን፣ ዉሃዉ ወደ ሰዉነት እንዳይዳረስ (እንዳይዘልቅ) የሚከለክሉ ነሮችን ማስወገድና ሁልግዜ የማይለቅ የዉዱእ ማጥ ያ ችግር ያለበት ሰዉ ሊሰግደዉ የሚፈልገዉ ሰላት ወቅት መግባት ናቸዉ ::

## አስራ ሶስተኛ ትምህርት

የዉዱእ ግዴታዎች ስድስት ናቸዉ ፡፡ እነሱም ፊትን መታጠብ ፣ ሲሆን አፍን መጉመጥመጥና በአፍንጫ ዉሀን ማስገባት ከዚሁ ጋር ይጠቃለላል ፣ ሁለቱን እጆች ከክርኖች ጋር ማጠብ ፣ ሁሉን የራስ ፀጉርና ጆሮዎችንም ጭምር ማበስ ሁለቱን እግሮችን ከቁርጭምጭሚቶች ጋር ማጠብ የተጠቀሱትን የዉዱእ አካሎች ቅደም ተከተላቸዉን መጠበቅና ማለጣጠቅ (ማከታተል ) ናቸዉ፡፡

## አስራ  አራተኛ ትምህርት

ዉዱእን የሚያበላሽ ነገሮች ስድስት ናቸዉ፡፡ እነሱም፥

ከሁለቱ የቆሻሻ መዉጫ ብልቶች የወጣ ሁሉ ፣ ከሰዉነት የወጣ ነጃሳ ነገር በእንቅልፍም ሆነ በሌላ ነገር አዕምሮ መሳት፣ ሁለቱን የእፍርት ገላዎች ያለ ምንም ከለላ በእጅ መንካት ፣ የግመል ስጋ መብላት ፣ አላህ ያጠብቀን እና ከእስልምና መዉጣት፡፡

__አንገብጋቢ ማሳሰቢያ__ ፦ እሬሳን ማጠብ በትክክለኛ አስተያየት ዉዱእ አያጠፋም ፡፡ ይህም የብዙሀኑ አሊሞች (ሙሁሮች) አስተያየት ነዉ ፡፡ ለማበላሸቱ ማስረጃ ስላልተገኘለት ነዉ ፡፡ ሆኖም አጣቢዉ የእሬሳዉን ገላ ያለ ምንም ግርዶ መንካት የለበትም ፡፡ እንደዚሁ ከአሊሞች በጣም ትክክለኛ በሆነዉ አቋም ሴትና ወንድ መነካካት በስሜትም ሆነ ያለስሜት ከብልት ፈሳሽ ነገር ካልወጣ በስተቀር አይበላሽም ፡፡ ምክንያቱም ነብዩ ሙሐመድ (ሰዐወ) አንዷቱን ሚስታቸዉን ስመዉ ዉዱእ ሳያድሱ ሰግደዎልና በማኢዳዕና በኒሳእ ምዕራፎች ዉስጥ (ወይም ሴቶችን የነካችሁ) ያለዉ ከአሊሞች ከፍተኛ ድጋፍ ያለዉ የታሻዉ ግብረ ስጋ ግንኙነት ነዉ ይህም አባባል የአብደላ ኢብኑ አባስና የሌሎችም የብዙ ሰዎች አስተያየት ነዉ ፡፡

## አስራ አምስተኛ ትምህርት

ለማንኛዉም ሙስሊም እንዲላበሳቸዉ ስለተደነገጉት ባህሪያትና ሥነ ምግባሮች ከእነዚህም መካከል እዉነተኛነት ፣ ታማኝነት ፣ ጥብቅነት ፣ እፍረት(ሐያዕ) ፣ ጀግንነት ፣ ቸርነት ፣ በቃል መሙላት ፣ አላህ ከከለከላቸዉ ነገሮች ሁሉ መራቅ ፣ ጉርብትናን ማሳመር ፣ በተቻለዉ አቅም ችግረኛን መርዳትና ሌሎችም በቁርአንና በሐዲስ የተደነገጉ ባህሪያቶች ይገኙበታል ፡፡

## አስራ ስድስተኛ ትምህርት

ስለ እስላማዊ ስርአቶች ከእነዚህም መካከል ሰላምተኝነት ፣ ፈገግተኝነት ፣ በቀኝ መጠጣትና መብላት ወደ መስጊድ ወይም ወደ ቤት ሲገቡና ሲወጡ እና መንገድ ሲሄዱ እንዲተገበሩ የተደነገጉትን ስርአቶች መጠበቅ ከወላጆች  ጋርና ከዘመዶች ከጎረቤቶች ከአዋቂዎችና  ከህፃናቶች ጋር ሊኖር የሚገባዉን ስርአት መተግበር ህፃን ሲወለድ እንኳን ደስ ያላችሁ በማለት የደስታ መግለጫ መስጠት ሰዉ ለሞተበት አላህ ትዕግስቱን ይስጣችሁ በማለት ማጽናናትና ሌሎችም እስላማዊ ስርዓቶችን መጠበቅ ፡፡

## አስራ ሰባተኛ ትምህርት

ከማጋራትና ከወንጀሎች ሁሉ መጠንቀቅ ከእነዚህም መካከል ሰባቱ የሰዉ ልጆችን አጥፊዎች በመባል የታወቁ ከባድ ኃጢአቶች ይገኙበታል ፡፡ እነሱም በአላህ ማጋራት ፣ ድግምት ፣ አላህ ክልክል ያደረጋትን ሕይወት ያለ አግባብ ማጥፋት፣ የየቲሞችን (አባት የሞተባቸዉን) ገንዘብ መብላት ፣ ወለድ (አራጣ) መብላት ፣ በጦርነት ቀን ከተሳተፉ በኋላ መሸሽ ፣ (ጥብቅ ንፁህ) የሆኑ ሴቶች በዝሙት መስደብ (መወንጀ) ፡፡

ከዚህም በተጨማሪ የወላጆችን ሐቅ መርገጥ ፣ ዝምድናን መቁረጥ ፣ የሐሰት ምስክር መስጠት ፣ የሐሰት መሐላ ፣ ጎረቤትን ማስቸገር ፣ ሰዎችን በደም በገመና መበደልና ማስቸገር ሌሎችም አላህ ወይም ነብዩ (ሰ.ዐ.ወ) የከለከሏቸዉ ሁሉ ነገሮች ይገኙበታል ፡፡

## አስራ ስምንተኛ ትምህርት

እሬሳን መሸፈን በእሱ ላይ መስገድ ዝርዝሩ የሚከተለዉ ነዉ

**የሬሳ አዘገጃጀት**

1. መሞቱ ሲረጋገጥ አይኖቹ ይገጠማሉ መንጋጭሎቹ ይገጣጠማሉ ::

2. እሬሳዉ ሲታጠብ እፍረተ ገላዉ ይሸፈናል :: ቀጥሎም ትንሽ ከፍ ይደረግና የሚወጣ ነገር ካለ ይወጣለት ዘንድ ሆዱ በቀስታ ይጨመቃል ከዚያ ቀጥሎ አጣቢዉ በእጁ ላይ ጨርቅ መሳይ ነገር ጠቅልሎ እስቲንጃ ያደርግለታል ከዛም የሰላት ዉዱእን የመሰለ ያደርግለታል ቀጥሎም እራሱን እና ፂሙን በዉሀና በቁርቁራ ወይም በሌላ ተመሳሳይ ነገር ያጥበዋል ከዛ ቀኝ ጎኑን ያጥባል አስከትሎ ግራዉን እንደዚሁ እያደረገ ለሁለተኛ ለሶስተኛ ጊዜ ያጥባል በእያንዳንዱ እጥበት ሁሉ እጁን በሆዱ ላይ ያስኬዳል (ያሸዋል) የሆነ ነገር ከወጣ ያጥበዉና መዉጫዉን በጥጥ ወይም በሌላ ነገር ይወትፈዋል ይህም ካልገደበዉ በንፁህ የአፈር ጭቃ ወይም በዘመን አመጣሽ ህክምና ዘዴ ማፈኛ ይዝጋዉ ዉዱእ እደገና ያድርግለት በሶስቱ ባይጸዳ እስከ አምስት እስከ ሰባት ይጨምርብት ከዚያም በጨርቅ ያድርቀዉ ፀጉሩ አይበጠርም ሴት ግን ፀጉራ ለ3 ተጎንጉኖ ወደ ኋላዋ ይለቀቃል ::

3. እሬሳን መገነዝወንድ ከሆነ በሶስት ነጫጭ ጨርቆች ቀሚስና ጥምጣም በሌላቸዉ መገነዙ ይበልጣል ተራ በተራ ይጠቀለልበታል በቀሚስ በሽርጥና በአንድ ብትን መጠቅለያ ቢገነዝ ምንም አይደል :: ሴት ግን በአምስት ጨርቆች ማለት በቀሚስ በጉፍታ በአንድ ሽርጥና በሁለት መጠቅለያ ጨርቆች ነዉ የምትገዘዉ ህፃን ልጁ ከአንድ እስከ ሦስት በሚሆን ጨርቆች ይገነዛል ሴት ህፃን በቀሚስና በሁለት ጨርቆች ትገነዛለች ፡

4. እሬሳን ለማጠብ በእነሱ ላይም ለመስገድና ለማስቀበር መብት ሞቹ የተናዘዘለት ሰዉ ነዉ :: ከዚያም የሞቹ አባት ፣ አያት ፣ወራሽ ዘመዶች እንደቅርበታቸዉ :: ሴትን ለማጠብ ባለመብት የተናዘዘችላት ስትሆን ከዚያም እናት ፣ አያት ፣ ከዚያም የሴት ዘመዶች እደቅርበታቸዉ ደረጃ ባልና ሚስት አንዱ ሌላዉን ሊያጥብ ይችላል :: አቡበከር ሲዲቅን ያጠቧቸዉ ባለቤታቸዉ ነበሩ :: አሊም ባለቤታቸዉ ፋጡማን አጥበዋል ::

5. በሟች ላይ አሰጋገድ እንደሚከተከዉ ነዉ :- አራት ግዜ አላሁ አክበር ይባላል ከመጀመሪያ ቀጥሎ ፋቲሐ (የመክፈቻዉ) ምዕራፍ ይነበባል :: አብሮ ሌላ አጠር ያለ የቁርአን ምእራፍ ወይም አንድ አንቀፅ ወይም ሁለት አንቀጽ ቢነበብ ጥሩ ነዉ ይህን በተመለከተ አብዱላሂ ኢብን አባስ የዘገቡት ትክክለኛ ሐዲስ ስለ ነዉ :: ሁለተኛዉን ተክቢራት ካደረገ በኋላ በሰላት (በተሸሁድ) ዉስጥ በነብዩ (ሰዐወ) ሰለዋት እደሚለምን ሁሉ ይለምን (ያዉርድ) :: ሶስተኛዉ ተክቢራ ካደረገ በኋላ የሚከተለዉን ፀሎት ይነበባል :-

አላሁመ ኢግፊር ሊሐይና ወመይቲና ወሻሂዲና ወጋኢቢና ወሰጊሪና ወከቢሪና ወዘከሪና ወዑንሳና ፤ አላሁመ መን አሕየይተሁ ሚንና ፊአሕይሂ ዐለል ኢስላም ፤ ወመን ተወፈይተሁ ሚንና ፈተወፍፊሁ ዐለል ኢማን ፤ አላሁመ ኢግፊር ለሁ ወግሲልሁ ቢልማኢ ወሰልጂ ወልበረዲ ወነቂሂ ሚናል ዙኑብ ወኸጣያ ከማ ዩነቃ አሰዉቡል አብረዱ ሚና አልደነሲ ወአብዱልለሁ ዳረን ኸይረን ሚን ዳሪሂ ወአህለብ ኸይረን ሚንአህሊሂ ወአድኸልሁ አልጀነተ ወአኢዝሁ ሚን አዛቢል ቀብር ወአዛቢ ንናር ወአፍሲህለሁ ፊቀብሪሂ ወናዊርለሁ ፊሂ አላሁመ ላተህሪምና አጅረሁ ወላቱዲለና ባዕደሁ

ትርጉም <<**አላህ ሆይ በሕይወት ላለነዉም ለሞቱትም በቅርብ ያለዉንም በሩቅ ያለዉንም ትልቆችንም ትንሾችንም ወንዶችንም ሴቶችንም ማረን አላህ ሆይ ከመካከላችን በሕይወት የምታቆየዉን ሰዉ በእስልምና ላይ አቆየዉ ከመካከላችን የምታሳርፈዉን በእምነት ላይ እንደሆን አሳርፈዉ አላህ ሆይ ምህረት አድርግለት እዘንለትም ጠብቀዉ ይቅርም በለዉ መስተንግዶዉን አሳምርለት መግቢያዉንም አስፍለት ሀጢያቱንም በዉሀና በበረዶ እጠብለት ነጭ ልብስ ከቆሻሻ እንደሚፀዳ አፅዳዉ ከቤቱ የተሻለ ቤት ከቤተሰቡ የተሻለ ቤተሰብ ቀይርለት ወደ ገነትም አስገባዉ ከቀብር ዉስጥ ቅጣትና ከእሳትም ቅጣት ጠብቀዉ መቃብሩንም አስፍለት አብራለትም አላህ ሆይ ምንዳዉን አትፈገዉ ከእርሱም በሆላ እጣችንን ጥመት አታድርግብን>>**

ከአራተኛዉ ተክቢራ በኋላ በቀኝ ጎኑ ብቻ ሰላምታ ይባላል በእያንዳዱ ተክቢራ ጊዜ እጇን ማንሳቱ ይወደዳል ሴት ከሆነች ፀሎቱን እንዲህ ብሎ

አላሁመመ ኢጅአልሁ ፈረጠን ወዙኽረን ሊዋሊደይሂ ወሸፊአን ሙጃበን ፤ አላሁምመ ሠቅቂል ቢሂ መዋዚነሁማ ወዐዚም ቢሂ ኡጅረሁማ ወአልሒቅሁ ብሷሊሂል ሙእሚኒን ወጀዐልሁ ፊ ከፋለቲ ኢብራሂመ ወቂሂ ቢራህመቲከ ዐዛበል ጀሂም ::

ትርጉሙም <<**አላህ ሆይ ለወላጆቹ በወዳያኛዉ ሕይወት ደህንነት ቀድሞ ሂዶ የሚያመቻች ቀዳሚ ለችግር ቀን አለኝታ ተሰሚነት ያለዉ አማላጅ አድርግላቸዉ :: አላህ ሆይ የመልካም ስራ ሚዛን ማከበጃ የምንዳቸዉ ማብዣ አድርገዉ ከደጋግ ምዕመናን ጋርም አስጠጋዉ በነብዩ ኢብራሂም እንክብካቤ ሥር አድርገዉ በችሎታህም ከገሀነም እሳት ጠብቀዉ** >> ::

ኢሟሙ ለማስገድ ሲቆም ሱናዉ ሟች ወንድ ከሆነ በራሱ አቅጣጫ ሴት ከሆነች በመሀከል ሰዉነቷ አቅጣጫ መቆም ነዉ :: ወንድና ሴት ከሆኑ ወንድ ወደ ኢማሙ በኩል ሴቷ ወደ ቂብላ በኩል ነዉ የሚደረገዉ :: ህፃን ካለ መጀመሪያ

ህፃኑ ቀጥሎ ሴት ቀጥሎም ህፃኗ ሆነዉ የሚቀመጡት ፡፡ የህፃኑ ራስ በወንድ ራስ አቅጣጫ ሲሆን የሴት መሐል ሰዉነት እንደዚሁ በወንዱ ራስ ትይዩ ይሆናል ፡፡ እንደዚሁ የህፃኗ ራስ አቅጣጫ የሚሆነዉ በሴት ራስ አቅጣጫ የህፃኗ መኸከል በወንዱ ራስ አቅጣጫ ነዉ የሚሆነዉ ፡፡ የሚሰግዱት ሰዎች በሙሉ ከኢማሙ በኋላ ይሆናሉ አንድ ሰዉ ብቻ ቦታ ካላገኘ ከኢማሙ በቀኝ ጎን ይቆማል ፡፡

**<<ለአላህ ብቻ ምስጋና ይገባዉ ራህሙቱ ረድኤቱን በነብዩና በቤተሰቦቻቸዉና በባልደረቦቻቸዉ ላይ ይዉረድ>>**

# ተፈጸመ !